በመንፈሳዊ አለም ግዛት ውስጥ ሲገቡ ግትር ከሆነው የጊዜ ግንዛቤ እና መዋቅር ጋር ያለዎትን የመጣበቅ ፍላጎት መልቀቅ አስፈላጊ ነው። የመንፈሳዊ አለም ግዛት የፈሳሽነት ባህሪን በመቀበል እራስዎን ጊዜ ከማይገድበው እና ከማይሸረው የሕልውና ተፈጥሮ ጋር አብረው እንዲፈሱ ይፍቀዱ። ይህ የአመለካከት ለውጥ የጊዜን ምንነት እና ከመንፈሳዊ ጉዟችን ጋር ስላለው ግንኙነት ጥልቅ ግንዛቤዎችን ይሰጣል።

### 4.3.2 ባለብዙ-ልኬት ቦታ

ግዑዙ ዓለማችን በሦስት ልኬቶች ማለትም በርዝመት፣ በስፋት እና በቁመት የተገደበ ሲሆን የመንፈሳዊ አለም ግዛቶች ግን እነዚህን ገደቦች ያልፋሉ። እነዚህ ግዛቶች የባለብዙ-ልኬት ቦታ ግዛቶች ሲሆኑ ሁኔታዎች፣ ደረጃዎች እና የንዝረት ድግግሞሾች እርስ በርስ የሚተሳሰሩበት እና አብረው የሚኖሩበት ስውር ስፍራ ነው።

በመንፈሳዊ ግዛቶች ውስጥ በተለያዩ ቦታዎች ያለ ምንም ጥረት እየተጓዙ እና በሃሳብ ሰፊ ርቀት እየተሻገሩ እራስዎን ሊያገኙ ይችላሉ። በነዚህ መንፈሳዊ ግዛቶች ውስጥ ስንገባ የአካላዊ አለም ውሱንነቶች የማይተገበሩ ሲሆን በአንድ ጊዜ በብዙ ቦታዎች መኖርን እንኳን ሊለማመዱ ይችላሉ።

የመንፈሳዊ አለም ግዛቶችን ውድ ልምምድ በመቀበል የሚገኙትን ወሰን የለሽ ልኬቶችን ያስሱ። ከአካላዊ የእስራት ቅዠት በላይ ለማየት እና ለመለማመድ አሁኑኑ ለራስዎ ይፍቀዱ።

### 4.3.3 ንቃተ-ህሊና እና የጊዜ እና የቦታ አንፃራዊነት

በመንፈሳዊ ዓለም ግዛቶች ውስጥ በጊዜ እና በቦታ መካከል ያለውን የተለያየ አመለካከት በትክክል ለመረዳት ወደ ንቃተ ህሊና ተፈጥሮ መግባት አለብን። ንቃተ ሕሊና የመኖራችን መሠረታዊ ገጽታ ሲሆን በጊዜ እና በቦታ ውስንነት የተገደበ አይደለም።

ትኩረታችንን ከሥጋዊ ወደ መንፈሳዊ አለም ግዛቶች ስንቀይር ንቃተ ህሊናችን የሚሰፋ ሲሆን ይህም እኛን ከአካላዊ አለም ወሰን እና ገደብ እንድናልፍ ያስችለናል። በዚህ የተስፋፋ የንቃተ ህሊና ሁኔታ ውስጥ ከግለሰባዊ እና አካላዊ ህይወታችን ወሰን በላይ ያሉትን ጥበብ፣ እውቀት እና ልምዶችን ለማግኘት የጋራ ንቃተ ህሊና የንዝረት ሁኔታ ውስጥ መግባት እንችላለን።

ወደ መንፈሳዊ አለም ግዛቶች በምትገባባት ጊዜ ንቃተ ህሊናህ ከጊዜ እና ከቦታ ጋር እንዴት እንደሚገናኝ ትኩረት ስጥ። በዚህ ባለብዙ ልኬት ግዛት ውስጥ የእርስዎ ሃሳቦች እና አላማዎች የእርስዎን ልምዶች እንዴት እንደሚቀርጹ ይመልከቱ። በአካላዊ እና በመንፈሳዊ አለም ውስጥ ያለውን እውነታ የሚፈጥረው እና የሚቀርጸው ንቃተ ህሊናዎ መሆኑን በመረዳት የጊዜ እና የቦታ አንፃራዊነትን ይቀበሉ።

### 4.3.4 ስውር ምሥጢሩን መቀበል

ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶችን እና መንፈሳዊ ግዛቶችን ማሰስ የጊዜ እና የቦታ ተፈጥሮን ለማሰላሰል ልዩ የእይታ ነጥብን ይሰጣል። ቀድሞ የያዝናቸውን ሀሳቦች፣ እምነቶች እና አመለካከቶች በመፈተን ስለእውነታው ያለንን ግንዛቤ

ያሰፋዋል። ከነዚህ ተሻጋሪ ልምምዶች የሚገኙ ጥበቦችን እና ግንዛቤዎች በአመስጋኝነት ይቀበሉ።

በመንፈሳዊ አለም ግዛት ውስጥ ሲጓዙ የመደነቅ ስሜት እና የማወቅ ጉጉት ይኑርዎት። የጊዜ እና የቦታ አንፃራዊነት እና የባለብዙ-ልኬት ቦታን ስፋት ለመመልከት እና ለመመስከር እራስዎን ዝግጁ ያድርጉ። ምክንያታዊ ማብራሪያዎችን የመስጠት ፍላጎትን ትተህ ለማይታወቅ መንፈሳዊ ውበት ተሰጥ።

መንፈሳዊ የአለም ግዛት የሚያቀርበውን የተለየ የጊዜ እና የቦታ እይታ በመቀበል ገደብ የለሽ እድሎችን እና በታላቁ አካላዊም ሆነ መንፈሳዊ አለም ውስጥ ስላለዎት ቦታ ጠለቅ ያለ ግንዛቤ ማግኘት ይችላሉ። ይህን አስደናቂ ግዛት ስታስሱ ሊነሱ የሚችሉትን የለውጥ ግንዛቤዎችን እና ጥበቦችን ይቀበሉ።

**ማጠቃለያ**

ከሰውነት ውጪ በሆኑ ልምዶች እና በመንፈሳዊ አለም ግዛቶች ውስጥ ጊዜ እና ቦታ የተለየ አመለካከት የሚይዙ ሰሆን ይህም በአብዛኛው የሰው ልጅ የተለመደውን ግንዛቤ ይፈታተናሉ። በዚህ ግዛት ውስጥ ያሉ ልምዶች የጊዜን ፈሳሽነት፣ የባለብዙ-ልኬት ቦታን ስፋትን እና በንቃተ-ህሊና እና በእውነታ መካከል ያለውን ጥልቅ መስተጋብር ያሳያሉ።

በመንፈሳዊ ጉዞ ላይ ስትሳፈሩ እና የመንፈሳዊ አለም ግዛቶች ስታስሱ በክፍት አእምሮ መቅረብ እና የሚገለጡትን ሚስጥሮች የለማስገደድ እና ፍርሀት ይቀበሉ። ቀጥተኛ የጊዜ ግንዛቤን እና የቁሳዊ አለም ውሱንነትን ትተህ እራስህን ማለቂያ ወዳሌለው እድሎች እና ጥበብ ውስጥ እንድትገባ ፍቀድ።

በጊዜ እና በቦታ መካከል ያለውን የተለያየ አመለካከት በመቀበል ስለራስዎ፣ ስለመንፈሳዊ ጉዞዎ እና ስለሁሉም ነገሮች ትስስር ጥልቅ ግንዛቤ ማግኘት ይችላሉ። ስለዚህ ወዳጄ በጀብዱ ስሜት እና ክፍት ልብ ወደ ስውር እና ሚስጥራዊው አለም ግባ።



# ምዕራፍ 5፡ ወደ መንፈሳዊ አለም ግዛቶች ለመግባት የሚረዱ ቴክኒኮች

እንኳን ወደ መንፈሳዊ አለም ግዛቶች ለመግባት የሚረዱ ቴክኒኮች አሰሳ በደህና መጡ። በዚህ ምእራፍ ውስጥ ወደ ሁለት ታዋቂ ቴክኒኮች የሆኑትን የገመድ ቴክኒክ እና የምልከታ ለውጥ ቴክኒክ እንመረምራለን። እነዚህ አካሄዶች ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶችን ለመጀመር እና እራሳችንን ወደ መንፈሳዊ አለም ግዛቶች ለማስገባት ልዩ መንገድን ያቀርባሉ።

## 5.1 የገመድ ቴክኒክ

### 5.1.1 የገመድ ቴክኒኮችን መረዳት

የገመድ ቴክኒክ ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶችን ለመለማመድ እና ወደ መንፈሳዊ አለም ግዛቶች ለመግባት በሰፋት ተግባራዊ የሚደረግ ዘዴ ነው። ከሥጋዊ ወደ መንፈሳዊ ግዛት የሚደረገውን ጉዞ በአይነ ህሊና የመመልከት እና የማተኮር ኃይልን መጠቀምን ያካትታል።

ልምምዱን ለመጀመር ያለምንም ረብሻ ዘና ለማለት የሚችሉበት ጸጥ ያለ እና ምቹ ቦታ ያግኙ። በጀርባዎ በመተኛት ሰውነትዎ ሙሉ በሙሉ ዘና ያለ መሆኑን ያረጋግጡ። ማንኛውም ውጥረት ወይም ጭንቀት ከውስጣዎ ለመቀነስ እና ለማስወገድ ትንፋሽዎ ላይ ለማተኮር ጥቂት ጊዜ ይውሰዱ።

አይኖችዎን ይዝጉ እና ከእርስዎ በላይ ባለው ጣሪያ ላይ የተንጠለጠለ ገመድ እንዳለ ግልጽ በሆነ የአእምሮ ምስል ይመልከቱ። የገመዱን ሸካራነት፣ ቀለም እና ውፍረቱን በዓይነ ሕሊናህ በዝርዝር በመግለፅ እና በማሳተፍ ምስሉን በተቻለ መጠን እውነት ለማስመሰል ይሞክሩ። ገመዱን በመጠቀም ለመውጣት ወይም ወደ መንፈሳዊ አለም ግዛቶች ለመግባት ሲዘጋጁ በውስጥዎ ያለውን የጉጉት እና የደስታ ስሜቶች እንዲሰማዎት ይፍቀዱ።

አንዴ የገመዱ ምስላዊነት በአዕምሮዎ ውስጥ ግልጽ ከሆነ በኋላ ወደ መንፈሳዊ ግዛት ለመግባት ሃሳብዎን ያዘጋጁ። ከዛንም በእውነታዎ ውስጥ ያለው ብቸኛው ነገር ገመዱ ብቻ እንደሆነ አድርገው በመገንዘብ ትኩረትዎን በገመድ ላይ ብቻ ያተኮሩ። ትኩረት የሚከፋፍል ማንኛውንም ሀሳብ በመተው በገመድ ላይ ብቻ እንደ ሌዘር አይነት ትኩረት ያድርጉ።

በህሊናዎ እራስዎን በሳሉት እጆችዎ ዘርግተው ገመዱን አጥብቀው ሲይዙ በዓይነ ሕሊናዎ ይመልከቱ። በእጆችዎ እና በጣቶችዎ ላይ የገመድ ሸካራነት እንዲሰማዎት በመፍቀድ እራስዎን በአሁኑ አፍታ በመገኘት ስሜት ውስጥ ይጥመቁ። አሁን በማይታይ ሃይል እየተጎተታችሁ እንደሆነ አድርጋችሁ በመቀበል ገመዱን በመጠቀም ራስዎን መሳብ ይጀምሩ።

ወደ ላይ በምትወጣበት ጊዜ አሁንም ገመዱን በመያዝ ወደላይ መውጣትህን በመቀጠል መንፈሳዊ አካልህ ከስጋዊ ሰውነትህ ሲነሳ የሚሰማውን ስሜት በተመስጦ በማሰብ ስሜቱ በጥልቀት እንዲሰማህ ፍቀድ። ቀስ በቀስ ወደ ላይ ወደ መንፈሳዊ አለም መውጣትዎን ሲቀጥሉ ከአካላዊው ሰውነትዎ የክብደት ማጣት እና የመቅለል ስሜት ይሰማዎት።

በዚህ ሂደት ውስጥ እንደ ንዝረት፣ ያልተለመዱ ድምፅችን መስማት፣ ጩኸት ወይም በአካባቢዎ ያለውን አጠቃላይ የኃይል ለውጥ የመገንዘብ እና የመሳሰሉት ስሜቶች ሊሰማዎት ይችላል። እነዚህ ምልክቶች ከሥጋዊ አካልዎ ለመለየት እና ወደ መንፈሳዊ ግዛት ለመግባት በቋፍ ላይ እንዳሉ ያመለክታሉ። ወደ መንፈሳዊ ግዛቶች በሚያደርጉት ጉዞ ደረጃዎችን እየወጡ ስለሆነ እነዚህን ስሜቶች ይቀበሉ።

## 5.1.2 የገመድ ቴክኒክን መቻል

የገመድ ቴክኒክን ለመቻል ልምምድ፣ ትዕግስት እና የንቃተ ህሊናዎን ጥልቀት ለመመርመር ፈቃደኛ መሆንን ይጠይቃል። ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶች እና የመንፈሳዊ አለም ጉዞ ቀጣይነት ባለው ልምምድ እና በጊዜ ሂደት ሊዳብር የሚችል ችሎታ ነው። የገመድ ቴክኒክን የበለጠ በተለማመዱ ቁጥር ከሰውነት ውጭ የሆኑ ልምዶችን ለመለማመድ ቀላል ይሆናል።

ፈጣን ስኬት ሳታገኝ ብትቀር ተስፋ አትቁረጥ። ያስታውሱ የእያንዳንዱ ሰው ጉዞ እና እድገት ልዩ ነው። ጽናት እና ትዕግስት ቁልፍ ናቸው። የገመድ ቴክኒክን ለመለማመድ የዕለት ተዕለት ፕሮግራም በማውጣት የተወሰኑ ጊዜያቶችን መንፈሳዊ አለምን ለማሰስ ያውሉ።

ልምምድዎን ለማሻሻል እንደ ሜዲቴሽን ወይም ተመስጦ፣ ማሰላሰል ወይም የሉሲድ ህልም ስራ እና በመሳሰሉ ሌሎች ቴክኒኮችን በእለት ተእለት ውሎዎ ውስጥ ያካቱ። እነዚህ ልምዶች ከፍ ያለ የግንዛቤ ሁኔታን ለመፍጠር እና አእምሮዎን እና አካልዎን ለመንፈሳዊ ጉዞ ለማዘጋጀት ሊረዱዎት ይችላሉ።

በተጨማሪም የህልም ጆርናል ማዘጋጀት እና መመዝገብ ልምዶችዎን ለመቅዳት እና ለመተርጎም ይረዳል። ከጉዞዎ ሲመለሱ ከመንፈሳዊ ጉዞዎ ያገኙትን ትውስታዎች እና ግንዛቤዎች ይፃፉ። በጊዜ ሂደት ግንዛቤዎን እንዲያሳድጉ እና ልምምድዎን እንዲፈቱ የሚያስችልዎን ንድፎች ለራስዎ ሊገልጡ ይችላሉ።

### 5.1.3 የገመድ ቴክኒክን ማሻሻል

የገመድ ቴክኒክ ወደ መንፈሳዊ ግዛቶች ለመጓዝ መሰረታዊ ዘዴ ሆኖ የሚያገለግል ቢሆንም እንደ ምርጫዎ እና ፍላጎትዎ ሊሻሻል እና ግላዊ ሊሆን ይችላል። የተለያዩ ማሻሻያዎች በማድረግ ቴክኒኩን ከግል ዘይቤዎ ጋር ለማስማማት በመድፈር ይሞክሩ።

ለምሳሌ አንዳንድ ግለሰቦች በልምምዳቸው ውስጥ ማረጋገጫዎችን ወይም ማንትራዎችን ማከል ጠቃሚ ሆኖ የሚያገኙ ሲሆን እንደ “ወደ መንፈሳዊ አለም ጉዞ ማድረግ እችላለሁ" ወይም "ከመንፈሳዊ አለም ግዛት ጋር ያለ ምንም ጥረት እገናኛለሁ" ያሉ እና የመሳሰሉ አወንታዊ ኃይል ሰጪ መግለጫዎችን ተጠቀም። በልምምዱ ውስጥ ገመዱን ስትመለከት እና ስትወጣ እነዚህን ማረጋገጫዎች በውስጥህ ለራስህ ድገም።

በተጨማሪም የገመድ ቴክኒክን ከሌሎች የንቃተ ህሊና አሰሳ ዓይነቶች ጋር ማጣመር እንደ ሉሲድ ህልም ወይም ጥልቅ ተመስጦ ውጤቶቹን በማጉላት ሙሉ በሙሉ ወደ መንፈሳዊ አለም ግዛት የመግባት እድልን ይጨምራል። የተለያዩ ቴክኒኮችን በማዋሀድ እርስዎን በሚመች የተቀናጀ እና ግላዊ የሆነ መንገድ ይፍጠሩ።

ያስታውሱ ወደ መንፈሳዊ አለም ግዛቶች የሚደረግ ጉዞ ለእያንዳንዳችን ልዩ እና ግላዊ ተሞክሮ ነው። ለአንድ ሰው የሚሰራው ለሌላው ላይሰራ ይችላል። እራስዎን ለመሞከር፣ ማስተካከያዎችን ለማድረግ እና ከእርስዎ ልዩ ፍላጎት ጋር የሚጣጣሙ ዘዴዎችን ለመፈለግ እና ለማግኘት ነፃ ይሁኑ።

**በማጠቃለል**

የገመድ ቴክኒክ ወደ መንፈሳዊ አለም ግዛት ለመውጣት እና ትርጉም ያለው ከሰውነት ውጪ የሆነ ልምድ ውስጥ ለመሳተፍ የሚረዳ እውቅና ያለው ቴክኒክ ነው። በምስላዊ እይታ፣ ውስጣዊ ፍላጎት እና ትኩረትን በማዋሃድ ይህ ቴክኒክ ወደ መንፈሳዊ አለም ግዛት የመግቢያ በሩ እንዲከፍትልን ማድረግ ይችላል።

የገመድ ቴክኒክን ተጠቅመህ ወደ መንፈሳዊ አለም ግዛት ጉዞህን ስትጀምር ከስጋዊ አካል በሚነጠሉበት ጊዜ አፍታውን ሙሉ በሙሉ በመለማመድ ወደ ድንቅ አለም የሚወስደውን አስደሳች ጉዞ ተቀበል። በችሎታዎችዎ ይመኑ፣ በተግባርዎ ጸንተው ይቆዩ በተጨማሪም ለሚጠብቋችሁ ጥልቅ ጥበብ እና የለውጥ ልምዶች ክፍት ይሁኑ።

ሆኖም ግን እነዚህ ዘዴዎች ለእያንዳንዱ ግለሰብ ያላቸው ውጤታማነት ሊለያይ እንደሚችል ልብ ሊባል የሚገባው ጉዳይ ነው። የገመድ ቴክኒክ አፋጣኝ ውጤት ካላመጣ ወይም ፈታኝ ሆኖ ከተሰማህ ተስፋ አትቁረጥ። ከእርስዎ ጋር የሚስማማውን አቀራረብ ለማግኘት አማራጭ ቴክኒኮችን እና ትምህርቶችን ያስሱ።

## 5.2 የምልከታ ለውጥ ቴክኒክ

### 5.2.1 የምልከታ ለውጥ ቴክኒክን መረዳት

የምልከታ ለውጥ ቴክኒክ ንቃተ ህሊናዎን ከአካላዊው ገፅታዎ ወደ መንፈሳዊ ገፅታዎ መቀየርን የሚያካትት ታዋቂ እና ውጤታማ የሆነ ወደ መንፈሳዊ አለም ግዛት መግቢያ መንገድ ነው። እንደሌሎች ቴክኒኮች መንፈሳዊ ገፅታዎን ከሥጋዊ ሰውነትዎ ለመለየት ከመሞከር ይልቅ የምልከታ ለውጥ ቴክኒክ ቀስ በቀስ የእርስዎን አካላዊ ግንዛቤ  ወደ መንፈሳዊ ዓለም ወዳለው የመንፈሳዊ ገፃችን ግንዛቤያችንን ማሸጋገር ላይ ያተኩራል።

የምልከታ ለውጥ ቴክኒክን መለማመድ ለመጀመር ያለ ምንም ረብሻ ዘና የሚሉበት ጸጥ ያለ እና ምቹ ቦታ ያግኙ። ምቹ በሆነ ቦታ መቀመጥ ወይም መተኛት ተገቢ ሲሆን ይህም ሰውነትዎ ምቹ መሆኑን ያረጋግጣል። ማንኛውንም ውጥረት ወይም ትኩረት የሚከፋፍሉ ነገሮች ከውስጥዎ ለማስወገድ በጥልቀት ለመተንፈስ ትንሽ ጊዜ ይውሰዱ።

ዓይንዎን በመጨፈን ትኩረትዎን ወደ ውስጣዊው ዓለምዎ ያድርጉ። እንደ አየር የማስገባት እና የማስወጣት እንቅስቃሴ ወይም የልብ ምትዎን ረጋ ያለ ምት እና በሰውነትዎ ላሉ ስውር ስሜቶች ትኩረት ይስጡ። በእያንዳንደ እስትንፋስ ማንኛውንም ሃሳብ ወይም ስጋት በመተው ዘና ያለ እና ግልፅ የአዕምሮ ሁኔታ ውስጥ ይገቡ።

ወደዚህ የመዝናናት ሁኔታ ውስጥ ሲገቡ ትኩረታችሁን ከሥጋዊ አካልዎ ወደ መንፈሳዊ ግንዛቤዎ ማዞር ይጀምሩ። ይሄን ሲያደርጉ እንደ መወጠር፣ ሙቀት ወይም ንዝረት ካሉ በሰውነትዎ ውስጥ የሚከሰቱ ስሜቶችን ሊገነዘብ ይችላሉ። እነዚህ ስሜቶች በውስጥዎ በጥልቀት እንዲጨምሩ እና እንዲስፉ በመፍቀድ በልምምድዎ ውስጥ የበለጠ ንቁ ይሁኑ። ከዛንም በነፍስህ እና በመንፈስ ውስጥ ያለውን የኃይል ስሜት ተቀበል።

አሁን በበሩ ውስጥ እንደገባህ እና ወደ ተለዋጭ እውነታ ወይም ወደ መንፈሳዊ ግዛት ስትሻገር በዓይነ ሕሊናህ ተመልከት። ይህን አለም በደማቅ ቀለማት፣ ድንቅ በሆኑ አቀማመጦች እና ጥልቅ በሆነ የነፃነት እና የመቅለል ስሜት የተሞላ ሲሆን እነዚህ ስሜቶች እንዲሰማዎት ይፍቀዱ። በዚህ መንፈሳዊ ግዛት በመጥለቅ ስሜትዎን ሙሉ በሙሉ ያሳትፉ።

በእያንዳንዱ እስትንፋስ ንቃተ ህሊናዎ ከዚህ ተለዋጭ እውነታ ጋር የበለጠ እንዲዋሃድ ይፍቀዱ። ግንዛቤዎ ከአካላዊው ሰውነትዎ ገደብ በላይ ሲሰፋ እና ስውር ለውጥ በውስጥዎ ሲሰማዎት ያስተውሉ። አካላዊ ሰውነትዎ ከመንፈሳዊ አለም ጋር ያለውን የመገናኘት ስሜትን ይቀበሉ።

### 5.2.2 የምልከታ ለውጥ ቴክኒክን መቻል

የምልከታ ለውጥ ቴክኒክን ለመለማመድ ቀጣይነት ያለው ልምምድ፣ ትዕግስት እና የተረጋጋ እና ትኩረት ማድረግ የሚችል የአእምሮ ሁኔታን መፍጠርን ይጠይቃል። ልክ እንደ ማንኛውም ክህሎት ወደ መንፈሳዊ አለም የሚደረግ ጉዞ በመደበኛ እና ተከታታይ ልምምድ የበለጠ ከእኛ ጋር በመዋሃድ ሁለተኛ

ተፈጥሮ ይሆናል። በዚህ የለውጥ ጉዞ ውስጥ ስትሄድ ታጋሽ በመሆን በጉዞህ ላይ የምታገኘውን እድገት አክብር።

የምልከታ ለውጥ ቴክኒክን በመጠቀም ወደ መንፈሳዊ አለም ግዛቶች የመግባት ችሎታዎን ለማጠናከር መደበኛ የልምምድ መርሃ ግብር መፍጠር አስፈላጊ ነው። ለልምምድዎ በየቀኑ የተወሰነ ጊዜ ይመድቡ እና ትኩረትን ከሚከፋፍሉ ነገሮች ነፃ የሆነ ስፍራ ይፍጠሩ። የግንዛቤ ስሜትን ጠብቀህ ጥልቅ በሆነ መንገድ ዘና እንድትል የሚያስችልህን እንደ መቀመጥ ወይም መተኛት ያሉ ምቹ የሰውነት ቦታዎችን ሞክር።

ከዋናው የምልከታ ለውጥ ቴክኒክ በተጨማሪ እንደ ተመስጦ፣ የትንፋሽ ስራ ወይም የአይነ ህሊና ምልከታ ልምምዶችን ዘና ለማለት እና ትኩረትን ለመጨመር ያካትቱ። እነዚህ ልምምዶች አእምሮዎን እና አካልዎን ለመንፈሳዊ አለም ግዛቶች እና ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶች ጋር ለተያያዙ ከፍ ያሉ የንቃተ ህሊና ሁኔታዎችን ለማዘጋጀት ይረዳሉ።

የሕልም መጽሔትን ማዘጋጀት እና መመዝገብ እንዲሁ በጣም ጠቃሚ ነው። ከእንቅልፍዎ ሲነሱ ከመንፈሳዊ ጉዞዎችዎ ጋር የተገናኘ ማናቸውንም ህልሞች ወይም ልምዶች ይመዝግቡ። በጊዜ ሂደት ጠቃሚ ግንዛቤዎችን እና ፍንጮችን የሚሰጡ ንድፎችን ወይም ተደጋጋሚ ጭብጦችን ሊያስተውሉ ይችላሉ።

### 5.2.3 የምልከታ ለውጥ ቴክኒክን ማሻሻል

የምልከታ ለውጥ ቴክኒክ አቀራረብ ውጤታማ ቢሆንም ሊያሻሽሉት እና ከራስዎ ዘይቤ ጋር አብሮ ለማስኬድ ማበጀት ይችላሉ። ማሻሻያዎችን በማድረግ ከእርስዎ ውስጣዊ ፍላጎት ጋር የሚሄዱ ምርጫዎችን ያድርጉ።

**በማጠቃለል**

የምልከታ ለውጥ ቴክኒክ ወደ መንፈሳዊ አለም ለመግባት ቀላል የሆነ ዘዴን የሚያቀርብ ሲሆን ይህም ወደ መንፈሳዊ ግዛት በጸጋ እንዲያቋርጡ ያስችልዎታል። ቀስ በቀስ የንቃተ ህሊና እና የአመለካከት ለውጥ በማድረግ ከአካላዊ ወደ መንፈሳዊ ግዛት ስፋት ያለችግር መሸጋገር ይችላሉ።

የምልከታ ለውጥ ቴክኒክን ተጠቅመህ ወደ መንፈሳዊ አለም ግዛት ጉዞህን ስትጀምር በችሎታህ እምነት በመጣል ወጥ የሆነ ልምምድ ለማድረግ እና እራስህ ላይ ለመስራት ለራስ ቃል ግባ። ከመንፈሳዊ ዓለም ጋር የመዋሃድ ስሜቶችን እና ልምዶችን በመቀበል ግንዛቤዎን እንዲመሩ ይፍቀዱ። የሚጠበቁ ነገሮችን በመልቀቅ ለመንፈሳዊ አለም ፍሰት እጅ ይስጡ። ይህን ስናደርግ እያንዳንዱ አፍታ ጥልቅ ግንዛቤዎችን፣ የእድገት እድሎችን እና የለውጥ ግኝቶችን ለመግኘት እራሳችንን ዝግጁ እናደርጋለን።

ወዳጄ ወደ መንፈሳዊ አለም ለመሸጋገር እና ከአካላዊ ገደቦች ለማለፍ ጊዜው አሁን ነው። በመንፈሳዊ ዓለም ውስጥ እርስዎን የሚጠብቁትን ገደብ የለሽ እድሎችን ይቀበሉ። ተሞክሮዎችዎ ግልጽነትን፣ የንቃተ ህሊና መስፋፋት እና ከሥጋዊ አለም ባሻገር ካለው ሰፊ ሕልውና ጋር ትገናኙ ዘንድ መልካም ምኞቴን እገልፃለሁ!



# ምዕራፍ 6፡ መንፈሳዊ ፈውስን ማግኘት

## 6.1 አእምሮን፣ አካልን እና ነፍስን መፈወስ

እንኳን ወደ መንፈሳዊ ፈውስ ግዛት እና የንቃተ ህሊና ኃይል አእምሮን፣ አካልን እና ነፍስን ለመንከባከብ እና ወደ ነበሩበት ደህነነት ለመመለስ ስለሚያደርጉት አስተዋጽኦ ቅኝት በደህና መጡ። በዚህ ምእራፍ ውስጥ መንፈሳዊ ፈውስ ያለውን ጥልቅ እምቅ አቅም እና ሁለንተናዊ ደህንነትን እና የግል ለውጥን ለማስተዋወቅ እንዴት ጥቅም ላይ መዋል እንደሚቻል እንመረምራለን።

## 6.1 አእምሮን፣ አካልን እና ነፍስን መፈወስ

መንፈሳዊ ፈውስ በአእምሮ፣ በአካል እና በነፍስ መካከል ያለውን ግንኙነት የሚቀበል ባለብዙ ገጽታ የደህነነት አቀራረብ ነው። በአንደኛው የማንነታችን ገጽታ የሚኖር አለመመጣጠን ወይም አለመስማማት በሌሎች ገፅታዎች በበሽታ ወይም በህመም መልክ ሊገለጽ እንደሚችል ይገልጻል። በመንፈሳዊ ዓለማት ውስጥ ዘልቆ በመግባት እኛን የሚጠብቀውን ማለቂያ የሌለውን የፈውስ ሃይል እና መመሪያ ማግኘት እንችላለን።

### 6.1.1 አእምሮን መፈወስ

አእምሮ የእኛን አመለካከቶች፣ እምነቶች እና ስሜታዊ ሁኔታዎች የሚቀርጽ ኃይለኛ መሳሪያ ነው። መንፈሳዊ ፈውስ እድገታችንን እና ደህንነታችንን ሊገቱ የሚችሉ ንድፎችን እንድንፈታ፣ ስለቀድሞ ጉዳቶች ግንዛቤ እንድናገኝ፣ የሚገድቡ

እምነቶችን እና አሉታዊ ቅጦችን እንድናፈርስ እና በአጠቃላይ ውስጠ ህሊናችንን እንድንመረምር እድል ይሰጠናል።

ወደ መንፈሳዊ አለም መግቢያ ቲክኒኮች ማለትም ተመስጦ እና በሚመራ የንቃተ ህሊና ምልከታ አማካኝነት የውስጠ ህሊናችንን ጥልቀት ማሰስ እና ለእነዚህ ስውር ገጽታዎች ግንዛቤ መፍጠር እንችላለን። እነዚህን የማንነት ንድፎች እና ቅጦች በማወቅ እና በመቀበል ስር የሰደዱ ቁስሎችን መፈወስ እና የበለጠ አወንታዊ እና ወደፊት የሚያመራ አስተሳሰብን ማዳበር እንችላለን።

በመንፈሳዊ ፈውስ ወቅት ጥበብን፣ መመሪያን እና መመሪያን የሚሰጡ አካላት፣ ፍጥረታት ወይም ከፍተኛ የንዝረት ሁኔታ ያላቸው ፍጡራንን ልናገኝ እንችላለን። እንዲሁም ግልጽነትን እንድናገኝ፣ ስሜታዊ ፈውስን በውስጣችን እንድንፈጥር እና የሚገድቡ እምነቶችን ወይም አሉታዊ ልምዶችን እንድንለቅ ሊረዱን ይችላሉ።

በመደበኛ የመንፈሳዊ ፈውስ ልምምዶች ውስጥ በመሳተፍ እና መመሪያ ከሚሰጡ ፍጥረታት ወይም አካላት ጋር አብሮ በመስራት ስሜታዊ ሚዛንን ማሳደግ፣ ራስን መውደድን ማዳበር እና የበለጠ ውስጣዊ ሰላም እና የደስታ ስሜት ማዳበር እንችላለን።

## 6.1.2 አካልን መፈወስ

ሥጋዊ አካል ሕይወትን የምንለማመድበትና በምድራዊ ሕይወታችን ውስጥ የምንላበሰው ድንቅ መኖርያ መሳርያ ነው። መንፈሳዊ ፈውስ ደግሞ አካልን እንደ ሃይል ስርዓት በመገንዘብ ሚዛንን፣ ጥንካሬን እና ደህንነትን መመለስ ላይ ያተኩራል።

መንፈሳዊ ፈውስ የፈውስ ሃይሎችን ንቁ በመሆን እና ትኩረት በመስጠት ወደተመረጡ የሰውነት ክፍሎች መምራትን ያካትታል። የምስላዊ ምልከታን፣ ውስጣዊ ፍላጎትን እና ንቃተ-ህሊናን ኃይል በመጠቀም ሰውነታችንን ተፈጥሯዊ በሆነ መንገድ የመፈወስ አቅማችንን መጠቀም እና አካላዊ ደህንነታችንን ማሳደግ እንችላለን።

በመንፈሳዊ ፈውስ ወቅት አንድ ሰው ትኩረቱን በሰውነት ውስጥ በሚፈሰው የፈውስ ብርሃን ወይም ሃይል በማድረግ በሴሉላር ደረጃ የሚኖራቸውን አዎንታዊ ተፅዕኖ ሊመለከት ይችላል። ይህ ሂደት በሰውነት ውስጥ ያሉ የተለያዩ የአካል ክፍሎች እና ስርዓቶች ጋር የሚዛመዱ ቻክራዎች በመባል የሚታወቁትን የሀይል ማዕከሎች ደህንነት ለመጠበቅ ይረዳል።

በመንፈሳዊ ፈውስ ውስጥ መሳተፍ የሰውነትን የተቀላጠፈ ስራ የሚያደናቅፉ አካላዊ ውጥረትን፣ ህመምን ወይም የሀይል ዝውውርን የሚያግዱ ጫናዎችን ለመልቀቅ ያስችላል። ከመንፈሳዊ ዓለማት ጋር በመገናኘት የሰውነትን ተፈጥሯዊ የመልሶ ማልማት ሂደቶችን የሚደግፉ ገደብ የለሽ የፈውስ ሃይሎችን ለራሳችን አዎንታዊ ጥቅም ማዋል እንችላለን።

### 6.1.3 ነፍስን መፈወስ

መንፈሳዊ ፈውስ ነፍሳችንን የሚያነቃቃት እና የሚንከባከባት ሲሆን ከፍ ካለው መንፈሳዊ ማንነታችን፣ ከጋራ የሰውልጅ ንቃተ ህሊና እና ከታላቁ መንፈሳዊ ሀይል ጋር ያገናኘናል። ይህ መንፈሳዊ የፈውስ ጉዞ የመንፈሳዊ ማንነታችንን ጥልቀት እንድንመረምር፣ ስለ አላማችን፣ እርስ በርስ ስለመተሳሰራችን እና የውስጣዊ ጥበብ ጥልቅ ግንዛቤ እንድናዳብር ይረዳናል።

በመንፈሳዊ ዓለማት ውስጥ ጥልቅ ግንዛቤዎችን እና ትምህርቶችን መስጠት የሚችሉ መንፈሳዊ አስተማሪዎችን፣ መሪዎችን ወይም ብሩህ ፍጥረቶችን ልናገኝ እንችላለን። እነዚህ ፍጥረታት መንፈሳዊ እድገታችንን ይደግፋሉ፣ ንቃተ ህሊናችንን ያሰፋሉ እንዲሁም ከትክክለኛው ማንነታችን ጋር እንድንስማማ ይረዱናል።



መንፈሳዊ ፈውስ ከመንፈሳዊ መንገዳችን ጋር የሚስማሙ ከፍ ያለ የንዝረት ጉልበት ያላቸው ፍጡራን፣ ጥንታዊ ቅርሶች ወይም ምልክቶች ጋር በማገናኘት ከታላቁ መንፈስ ሀይል ጋር ያለንን ግንኙነት የበለጠ ያጠናክራል። በእነዚህ ክስተቶች መንፈሳዊ ዝግመተ ለውጥን እና የንቃተ ህሊና መስፋፋትን የሚያበረታቱ ቀጥተኛ መመሪያዎችን፣ መንፈሳዊ ጥበቦችን እና ግንዛቤዎችን መቀበል እንችላለን።

### 6.1.4 ሁሉን አቀፍ አቀራረብን ማዳበር

መንፈሳዊ የፈውስ ኃይልን ሙሉ በሙሉ ለመቀበል የአዕምሮን፣ የአካል እና የነፍስን መደጋገፍ መገንዘብ እና ሁሉን አቀፍ በሆነ አስተሳሰብ መቅረብ

አስፈላጊ ነው። እያንዳንዱን ገጽታ በስምምነት አብሮ በማስኬድ ጥልቅ ፈውስ እና ለውጥን በውስጣችን መፍጠር እንችላለን።

በዕለት ተዕለት እንቅስቃሴዎ ውስጥ የመንፈሳዊ ፈውስ ልምምዶችን ያካትቱ። ለተመስጦ፣ ለአይነ ህሊና ምልከታ ወይም ከሰውነት ውጪ ለሆኑ ልምዶች የተወሰነ ጊዜ ይመድቡ። እራስን ማጤንን፣ ራስን መንከባከብን እና ራስን መውደድን በሚያበረታቱ ልምዶች ውስጥ ይሳተፉ። ከመንፈሳዊ አለም ጋር ያለዎትን ግንኙነት ለማጠናከር እና መንፈሳዊ ፈውስን በውስጣችን ለመፍጠር ምስጋናን እና ጆርናል መፃፍን ይለማመዱ።

ያስታውሱ መንፈሳዊ ፈውስ ማግኘት ግላዊ እና ለውጥ የሚያመጣ ጉዞ ነው። የእያንዳንዱ ሰው ልምድ ልዩ እንደመሆኑ መጠን የራስዎን ግንዛቤ እና ውስጣዊ መመሪያ ማመን እና መከተል አስፈላጊ ነው። መንፈሳዊ የአለም ግዛቶችን ስትመረምር እና በመንፈሳዊ ፈውስ ጉዞ ውስጥ ስትራመድ ክፍት አእምሮ እና ልብ መያዝህን አትዘንጋ።

### 6.1.5 ውህደት እና ቀጣይነት ያለው እድገት

ከመንፈሳዊ የፈውስ ልምምዶች ሲመለሱ ከራስዎ ህይወት ጋር ለመዋሃድ እና ስለልምምዱ ለማሰላሰል ጊዜ ይውሰዱ። በአስተሳሰብህ፣ በስሜቶችህ ወይም በአካላዊ ደህንነትህ ላይ የተፈጠሩ ማናቸውንም ለውጦች በማስተዋል ተመልከት። የእርስዎን ተሞክሮዎች፣ ግንዛቤዎች እና በመንፈሳዊ ጉዞዎ ወቅት የተቀበሉትን ማንኛውንም መመሪያ በመጽሔት ውስጥ ይመዝግቡ።

በእነዚህ ልምዶች ላይ በማሰላሰል ግንዛቤዎን መጨመር፣ ቅጦችን መለየት እና የፈውስ ጉዞዎን መከታተል ይችላሉ። የተማሩትን ትምህርቶች በዕለት ተዕለት ሕይወትዎ ውስጥ ይተግብሩ። መንፈሳዊ ፈውስ ማግኘት የዕድሜ ልክ ልምምድ ስለሆነ ቀጣይነት ያለው እድገትን ይቀበሉ።

ወደ ፊት ስትጓዝ የመንፈሳዊ ፈውስ ልምምዶችህን በእንክብካቤ መያዝህን እና ማበልጸግህን ቀጥል። በመንፈሳዊ እድገት ውስጥ ካሉ እና ልዩ ከሆኑ ማህበረሰቦች እና ግለሰቦች ድጋፍ ይፈልጉ። ተመሳሳይ አስተሳሰብ ካላቸው ግለሰቦች ጋር ይሳተፉ እንዲሁም የድጋፍ ስሜትን በውስጣችን ለመፍጠር ግንዛቤዎችን እና ልምዶችን ያካፍሉ።

**በማጠቃለል**

መንፈሳዊ የፈውስ ልምምድ የአእምሮን፣ የአካልን እና የነፍስን ደህነነት ለመመለስ እና ለመንከባከብ መግቢያ ቁልፍ ይሰጠናል። በመንፈሳዊ ዓለማት ዳሰሳ ክፍል ውስጥ ወደ ጥልቅ የፈውስ ሃይሎች፣ የጥበብ እና የለውጥ ልምዶችን ቃኝተናል። በመደበኛ የመንፈሳዊ ፈውስ ልምምዶች ውስጥ በመሳተፍ ግንዛቤዎን ያሳድጉ እንዲሁም ሁለንተናዊ ደህንነትዎ ያለውን የእርስበርስ ትስስር ይቀበሉ።

<u>በመንፈሳዊ ፈውስ ጉዞህ ጥልቅ ፈውስን፣ ነፃ ማውጣትን እና የንቃተ ህሊና መስፋፋትን እንዲሁም በመንፈሳዊ ዓለም ውስጥ ያገኛችሁት ልምዶች ነፍስዎን ይመግቡ እና ወደ ጥልቅ ደህንነት እና የመንፈሳዊ እድገት ሁኔታ ይመራዎት ዘንድ ምኞቴ ነው።</u>

## 6.2 የቀድሞ ህይወቶችን እና የካርሚክ ግንኙነቶችን ማሰስ

እንኳን ወደ አስደናቂ የመንፈሳዊ ፈውስ ገጽታ የቀድሞ ህይወቶችን እና የካርሚክ ግንኙነቶችን ወደ ምናስስበት ክፍል በደህና መጡ። በዚህ ክፍል ውስጥ የቀድሞ ህይወታችንን የማወቅ፣ የመረዳት ጥልቅ ጉዞ እና የአሁኑን ህልውናችንን የሚቀርፁትን የካርማ ትስስር እንመረምራለን።

### 6.2.1 ዘላለማዊ መንፈስ እና ሪኢንካርኔሽን

የሪኢንካርኔሽን ፅንሰ-ሀሳብ መንፈሳችን ዘላለማዊ እንደሆነ የሚያስተምረን ሲሆን ቀጣይነት እና ተከታታይ በሆነ የአካላዊ የህይወት ጊዜያት ውስጥ እያደገ ነው። እያንዳንዱ የህይወት ዘመን የእድገት፣ የትምህርት እና የካርሚክ ንድፎችን የመፍታት እድል ነው። ያለፉትን ህይወቶች በመዳሰስ ስለ መንፈሳችን ጉዞ እና በህይወት ዘመናችን ስላጠራቀምናቸው ትምህርቶች ጥልቅ ግንዛቤን እናገኛለን።

ወደ መንፈሳዊ አለም ግዛቶች የሚደረግ ጉዞ ያለፈ የህይወት ትውስታዎችን እና ልምዶችን ለማግኘት በር ይከፍታል። በዚህ ሂደት በተለያዩ የህይወት ዘመኖች የተላበስናቸውን ገፀባህርያት፣ ባህሎች እና ሚናዎች ማሰስ እንችላለን። ይህ ዳሰሳ ጊዜን የሚሻገሩ እና የአሁኑን እውነታ የሚቀርጹ ቅጦችን፣ ጭብጦችን እና ግንኙነቶችን እንድንገነዘብ ያደርገናል።

### 6.2.2 የቀድሞ ህይወትን መግለጥ

በመንፈሳዊ አለም ውስጥ የቀድሞ ህይወቶችን ለመዳሰስ ከመንፈስህ ታሪክ ግንዛቤዎችን እና ጥበብን የማግኘት ውስጣዊ ፍላጓት እና አላማ በማዘጋጀት ጀምር። በሜዲቴሽን ወይም ተመስጦ እና ወደ መንፈሳዊ አለም ግዛት ውስጥ በሚደረግ ጉዞ ወቅት ያለፈውን የህይወትዎ ዘመን ለመመርመር ከራስዎ መንፈሳዊ ማንነት ወይም ከታመኑ መንፈሳዊ ፍጥረታት መመሪያን ይፈልጉ።

በመንፈሳዊ አለም ውስጥ በምትገቡበት ጊዜ ለአሁኑ መንፈሳዊ እድገትዎ ጠቃሚ ሊሆኑ ለሚችሉ ትዕይንቶች ወይም የህይወት ክስተቶች እራስዎን እንዲመሩ ይፍቀዱ። ጠቃሚ መረጃን፣ ፈውስን ወይም ግንዛቤን ሊሰጥ ለሚችል ማንኛውም ልምድ ክፍት ይሁኑ።

እነዚህን ያለፉ ልምዶችን ስትመረምር ስሜትህን ሙሉ በሙሉ አሳትፍ። በእያንዳንዱ የህይወት ዘመን ውስጥ የነበረውን አካባቢ፣ ልብስ፣ ግንኙነት እና ስሜትን ይመልከቱ። የሚነሱ ማንኛቸውም ጉልህ የሆኑ ክስተቶችን ወይም ትምህርቶችን ያስተውሉ ምክንያቱም እነዚህ ግንዛቤዎች በአሁኑ ጊዜ የሚያጋጥሙህን ንድፎች ወይም ትግሎች መፍትሄ ወይም ብርሃን ሊሰጡ ይችላሉ።

ከቀድሞ የህይወት ጥበብ ጋር በመገናኘት በህልውናዎ ውስጥ እውነታዎን የሚሸመኑትን የካርሚክ ክሮች መፍታት እና መግመድ ይችላሉ። ለዕድገት፣ ለይቅርታ እና ለፈውስ የሚያቀርቡ እድሎችን በመፈለግ ባጋጠሙህ ትምህርቶች እና ልምዶች ላይ አሰላስል።

## 6.2.3 የካርሚክ ግንኙነቶችን መረዳት

ካርማ የሚያመለክተው የተግባራችን አካላዊ፣ ስሜታዊ እና የጉልበት ውጤቶችን ነው። የምንወስደው እያንዳንዱ ድርጊት የአሁኑ እና የወደፊት ልምዶቻችን ላይ ተጽእኖ የሚያሳድር ሞገድ እንደሚፈጥሩ የሚያመላክት የምክንያት እና የውጤት መሰረታዊ መርህ ነው። ያለፉትን ህይወቶች ማሰስ መቻላችን በካርሚክ ግንኙነታችን ላይ ብርሃን ሊፈነጥቅ የሚችል ሲሆን ይህም ጊዜ እና ቦታን የሚሻገሩ ግንዛቤዎችን እና ትምህርቶችን እንድናገኝ ይረዳናል።

በመንፈሳዊ ዓለም ውስጥ ጉልህ የካርሚክ ግንኙነት የምንጋራቸውን ግለሰቦች ልናገኝ እንችላለን። እነዚህ ክስተቶች የመፍትሄ፣ የይቅርታ፣ ወይም የካርሚክ ውሎችን ለማሟላት እድሎችን ሊሰጡ ይችላሉ። እነዚህን ግንኙነቶች በመቀበል አሁን ያሉንን ግንኙነቶች መፈወስ እና መለወጥ እንዲሁም እኛን የሚያስሩንን አሉታዊ ህይሎች መልቀቅ እንችላለን።

ይቅርታ እና ርህራሄ የፈውስ ሀይለኛ ወኪሎች መሆናቸውን በመረዳት እነዚህን የካርማ ግንኙነቶች በክፍት አእምሮ እና ልብ መቅረብ አስፈላጊ ነው። ስለቀድሞ የህይወት መስተጋብር ስታሰላስል አዳዲስ ግንዛቤን ለመቀበል እና ማንኛውንም ቂም ወይም አሉታዊ ስሜት ለመልቀቅ ዝግጁ ሁን።

ባልተፈቱ የካርሚክ ቅጦች ውስጥ በመስራት እራሳችንን ከድግግሞሽ ዑደት ነጻ ልናደርግ እና አሁን ባለንበት ህይወት ውስጥ ለእድገት፣ ለስምምነት እና ለሚዛናዊነት ቦታ መፍጠር እንችላለን።

### 6.2.4 ውህደት እና ፈውስ

ካለፉት ህይወቶች እና የካርማ ግንኙነቶች ካደረጉት መንፈሳዊ ጉዞ ሲመለሱ ያገኛችሁትን ጥበብ እና ግንዛቤን ከራስዎ ጋር ለማዋሃድ ጊዜ ይውሰዱ። ያጋጠሙዎትን ትምህርቶች እና ልምዶች በማሰላሰል ከአሁኑ ህልውናዎ ጋር እንዴት እንደሚዛመዱ ይመርምሩ።

የቀድሞ ህይወትዎ እና የካርሚክ ግንኙነቶች መንፈሳዊ የፈውስ ጉዞዎን እንዴት እንደሚደግፍ ያስተውሉ። ያልተፈቱ ጉዳዮችን ወይም የእድገት እድሎችን ሊያመለክቱ የሚችሉ ንድፎችን ወይም ተደጋጋሚ ጭብጦችን በማሰላሰል ያግኙ። ከቀድሞ የካርማ ሸክምዎ ለመላቀቅ ለራስዎም ሆነ ለሌሎች ይቅርታ ያድርጉ።



የተገኘውን አዲስ ግንዛቤ እና ጥበብ በምርጫዎ በግንኙነትዎ ውስጥ በመተግበር የተማሩትን ትምህርቶች ወደ ዕለታዊ ህይወትዎ ያዋህዱ። መንፈሳዊ ፈውስ የማግኘት ጉዞን በመቀበል እራስን መንከባከብን፣ ስለራስ ማሰላሰልን እና ራስን መውደድን በሚያበረታቱ ልምምዶች ውስጥ ይሳተፉ።

### 6.2.5 የአሁኑን አፈታ እና ነገን መቀበል

የቀድሞ ህይወቶች እና የካርሚክ ግንኙነቶችን ማሰስ በዋጋ ሊተመን የማይችል ግንዛቤዎችን ሲሰጥ ቢችልም የመጨረሻው አላማ በአሁኑ ጊዜ ሙሉ በሙሉ መኖር መቻል መሆኑን አስታውስ። ስለቀድሞ ህይወታችን የምናደርገው አሰሳ ዓላማው  ትምህርቶች ለመውሰድ፣ ቅጦችን ለመፍታት እና ከከፍተኛ አላማዎ ጋር የተጣጣመ የወደፊት ንድፍ ለመፍጠር ነው።

ምርጫዎችዎን፣ ግንኙነቶችዎን እና የግል እድገትዎን ለመምራት ከቀድሞ ህይወት የተገኘውን እውቀት ይጠቀሙ። የካርማ ቁስሎችን ለመፈወስ እና ከመንፈስህ አላማ ጋር ተስማምተህ ለመኖር በአሁኑ ህልውናህ የቀረቡትን እድሎች ተቀበል።

ያለፉት ልምምዶችዎ ለዕድገት እና ለለውጥ መሰረት ሆነው እንደሚያገለግሉ በመገንዘብ ነገን በተስፋ እና በብሩህ አሳቢነት ይመልከቱ። ቀጣይነት ባለው የመንፈስ ዝግመተ ለውጥ ውስጥ ከራስዎ መንፈሳዊ ገፅ እና ከታመኑ መንፈሳዊ መመሪያ ሰጪ ፍጥረታት ጋር ጥልቅ ግንኙነትን ያዳብሩ።

**በማጠቃለል**

የቀድሞ ህይወቶችን እና የካርሚክ ግንኙነቶችን ማሰስ የአሁን ህልውናዎን ሊለውጡ የሚችሉ ግንዛቤዎችን እና ጥበቦችን በማቅረብ የመንፈሳዊ ፈውስ የማግኘት ጥልቅ ገጽታ ነው። በመንፈሳዊ ዓለማት ውስጥ በመግባት ስለቀድሞ የመንፈስህ ጉዞ ጥልቅ ግንዛቤ ታገኛለህ፣ የካርሚክ ንድፎችን ትፈታለህ እንዲሁም ከከፍተኛ አላማህ ጋር ትስማማለህ።

አስታውስ አንተ የመንፈስህን ታሪክ በመመርመር እና በማወቅ እራስህን የመፈወስ እና የመለወጥ ሃይል ያለህ ድንቅ ፍጡር ነህ። ትምህርቶችን በመቀበል፣ ግንኙነቶችን በማክበር እና ነገን በተስፋ፣ በፍቅር እና በአመስጋኝነት ተመልከት።

## 6.3 በህይወት ካለፉ ከሚወዷቸው ሰዎች ጋር መገናኘት

እንኳን በመንፈሳዊ አለም ውስጥ ካሉ ከምንወዳቸው ሰዎች ጋር በምናደርገው ግንኙነት የምናገኘውን መንፈሳዊ የፈውስ ሂደት ወደ ምንመረምርበት ክፍል በደህና መጡ። በዚህ ክፍል ውስጥ በመንፈሳዊ አለም ውስጥ በሞት ከተለዩን ዘመዶቻችን ጋር ስለመገናኘት፣ መጽናኛን፣ ፈውስን፣ እና ከአካላዊ አለም ባሻገር ወደ መንፈሳዊ አለም ስለሚዘልቁ ግንኙነቶች ጥልቅ እና ውብ ክስተቶች እንቃኛለን።

### 6.3.1 የታላቁ መንፈስ ሀይል የፍቅር ትስስር

ፍቅር የጊዜንና የቦታን ወሰን የሚያልፍና ከሥጋዊው ዓለም በላይ የሚቆይ ትስስር ነው። ወደ መንፈሳዊ አለማት የሚደረጉ ጉዞዎች መፅናናትን፣ መመሪያን፣ ፍቅርን እና ሀይልን በመስጠት ከወዳጅ ዘመዶቻችን ጋር ያለንን ግንኙነት ለማጠናከር እና ለማስቀጠል እድል ይሰጣሉ።

በመንፈሳዊ አለም ግዛቶች ውስጥ ስንጓዝ ካለፉ ሰዎች ጋር እንደገና ለመገናኘት ለራሳችን የእድል በር እንከፍታለን። እነዚህ ክስሀቶች ከልብ የሚመነጭ ግንኙነትን፣ ፈውስን እና ነፍሳችንን በአዎንታዊነት ለመመገብ ያስችላሉ።

### 6.3.2 የመንፈሳዊ ግንኙነቶች ተፈጥሮ

በመንፈሳዊ አለም ውስጥ ከሚወዷቸው ሰዎች ጋር መገናኘት እንደ ግለሰባዊ ልምዶች፣ የጋራ ግንኙነቶች እና ባህሪዎች ላይ በመመስረት በተለያዩ መንገዶች ሊገለጡ ይችላሉ። እነዚህ ክስተቶች በድንገት ከሰውነት ውጪ በሆኑ ልምዶች

ወይም ሉሲድ ህልሞች ሊከሰቱ የሚችሉ ሲሆን ሌሎች ደግሞ በግለሰባዊ ምርጫ በትኩረት እና በተመስጦ ሊገለጡ ይችላሉ።

በነዚህ መንፈሳዊ ግኝቶች ወቅት የሞቱ ዘመዶቻችን በህይወት ውስጥ እንደነበሩ ወይም እውነተኛ ማንነታቸውን በሚያንጸባርቅ መልኩ ሊታዩ ይችላሉ። በሀሳቦች፣ በስሜቶች፣ በምስሎች ወይም በቴሌፓቲክ ልውውጦች ሊግባቡን ይችላሉ። ይህ ልምዱ ብዙውን ጊዜ በጥልቅ ግንኙነት፣ በፍቅር፣ በይቅርታ እና በመረዳት ስሜት የተሞላ በመሆኑ ይታወቃል።

እነዚህን መንፈሳዊ ክስተቶች በክፍት ልብ፣ በተቀባይ አዕምሮ እና በማስተዋል መቅረብ አስፈላጊ ነው። ከምትወዷቸው ሰዎች ጋር የመገናኘት እድልን በመቀበል፣ ሚዛናዊ ሁኔታን በመያዝ እና የራስዎን ስሜቶች በመገንዘብ ልምዶቹን የተሻለ አዲስ ማንነት እና ህይወት ለመገንባት ይጠቀሙ።

### 6.3.3 ፈውስ እና ነፃነት

በመንፈሳዊ አለም ውስጥ ከሚወዷቸው ሰዎች ጋር መገናኘት በስሜታዊ፣ መንፈሳዊ እና አልፎ ተርፎም አካላዊ ደረጃዎች ፈውስ እና ነፃነትን ያቀርባል። በዚህ አለም ውስጥ የሚወዱትን ሰው ሲያገኙ በውስጥዎ የሚፈጠሩ ስሜቶች እንዳሉ ሁሉ በመንፈሳዊ ዓለም ውስጥም መፅናኛ፣ ድጋፍን እና በግንኙነት ውስጥ ቀጣይነት ያለው የአንድነት ስሜት ሊሰጥ ይችላል።

በእነዚህ መንፈሳዊ ክስተቶች ያልተፈቱ ጉዳዮችን፣ ስሜቶችን ወይም ያልተገለጹ ስሜቶች ሊፈቱ እና ነፃነት ሊያገኙ ይችላሉ። ፍቅርን፣ ይቅር ባይነትን ወይም መመሪያን ከወዳጅ ዘመድዎ ሊቀበሉ የሚችሉ ሲሆን ይህም መጽናኛ እና አዲስ የሰላም እና የተስፋ ስሜትን በውስጣችን ይፈጥራል።

እነዚህ መንፈሳዊ ክስተቶች የራስዎን ሃሳቦች፣ ስሜቶች እና ምስጋና በቀጥታ ለሞቱት ዘመዶችዎ እንዲገልጹ እድል ሊሰጡዎት ይችላል። ጥልቅ የነፃነት እና የፈውስ ስሜትን በመስጠት ጸጸቶችን ወይም ውጥረት የነበራቸውን ግንኙነቶችን የመፈወስ እድል ይሰጣል።

### 6.3.4 የፍቅር እና የግንኙነት ኃይል

ከምንወዳቸው ሰዎች ጋር በመንፈሳዊ ግዛቶች ውስጥ መገናኘት ስለ ፍቅር ዘላቂነት እና የመንፈስን ዘላለማዊ ተፈጥሮ ያስታውሰናል። ይህም ከምንወዳቸው ሰዎች ጋር ያለን ግንኙነት ከሥጋዊው ዓለም ገደብ በላይ ሊቀጥል እና ሊዳብር እንደሚችል እንገነዘባለን።

እነዚህ መንፈሳዊ ክስተቶች መመሪያ እና ጥበብን ለማግኘት የእድል በር የሚከፍቱ ሲሆን የግል እድገትህን፣ መንፈሳዊ እድገትህን ወይም በህይወት ጉዞህ ውስጥ የሚያጋጥሙህን ፈተናዎች የሚደግፉ ግንዛቤዎችን እና አመለካከቶችን ሊሰጡ ይችላሉ።

የሜዲቴሽን ወይም የተመስጦ፣ ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶችን የሚያነሳሱ ቴክኒኮች ወይም የአይነ ህሊና ምልከታ መደበኛ ልማዶችን በመጠበቅ ከሚወዷቸው ሰዎች ጋር ጥልቅ ግንኙነትን ማዳበር ይችላሉ። ከእነሱ ጋር የመገናኘት ፍላጎትን በውስጥዎ በመፍጠር ፍቅርዎን መግለጽ፣ ፈውስን እና ነፃነት ማግኘት ይችላሉ።

### 6.3.5 ውህደት እና ግንኙነቶችን ማስቀጠል

ከምትወዳቸው ሰዎች ጋር በመንፈሳዊ አለም ውስጥ ተገናኝተህ ከተመለስክ በኋላ ወደ ህይወትህ ለመዋሃድ እና ለማሰላሰል ጊዜ ውሰድ። ልምዶቹን በማክበር እና ለልምዶቹ ምስጋና በመስጠት የተገኙት ፈውሶች እና አዲስ ግንዛቤዎች ወደ ማንነትዎ ዘልቀው እንዲገቡ ይፍቀዱ።

ያገኟቸውን ስሜቶች፣ መልዕክቶች እና መስተጋብሮች በመያዝ በመጽሔት ውስጥ ይመዝግቡ። የክስተቱ ጥልቅ ትርጉሞችን፣ በውስጣችን የተፈጠረውን ለውጥ እና የተቀበለከው መመሪያ ላይ አሰላስል። እነዚህ የማሰላሰል፣ የመመርመር እና የማጤን ተግባራት ልምዶቹን ወደ ህይወትዎ በማዋሀድ ቀጣይ የሆነ እድገትን እና ግንኙነትን ያረጋግጣል።

ከምትወዷቸው ሰዎች ጋር ያለው ግንኙነት ከመንፈሳዊ አለም ባለፍ አሁን ባለህበት አካላዊ ህይወትህ ውስጥ ተፅዕኖ እንደሚያሳድር አስታውስ። ቀጣይነት ያለው ግንኙነትን በሃሳቦች፣ በጸሎቶች እና ከልብ በሆኑ ስሜቶች ያሳድጉ። ፍቅር አካላዊ ገደቦችን፣ ጊዜን እና ቦታን እንደሚያልፍ በመገንዘብ ነፍስን እና መንፈስህን መንከባከብ ጥልቅ የግንኙነት ስሜትን እንደሚያሳድግ እወቅ።

**በማጠቃለል**

ከወዳጅ ዘመዶች ጋር የሚደረጉ መንፈሳዊ ግንኙነቶች ፈወስ ለማግኘት፣ ያልተፈቱ ስሜቶችን ለመፍታት እና ከአካላዊ አለም ባሻገር ግንኙነቶችን ለማስቀጠል ትልቅ እድል ይሰጣሉ። በመንፈሳዊ አለም ውስጥ በመሳተፍ የፍቅርን፣ የግንኙነትን እና የመንፈስን ዘላለማዊ ተፈጥሮ ተቀበል።

ያስታውሱ ፍጥረታት በሙሉ ያለን የእርስበርስ ትስስር የማይበጠስ እንዲሁም የጊዜ እና የቦታ ወሰንን የሚያልፍ ነው። መንፈሳዊ አለም ግዛቶችን በማሰስ ዘላለማዊ እድገትን፣ ፈውስን እና ስለመንፈሳችን ዘላለማዊ ተፈጥሮ ጠለቅ ያለ ግንዛቤ ማዳበር እንችላለን።



# ምዕራፍ 7፡ ልምዱን ከራሳችን ጋር ማዋሀድ

## 7.1 ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶችን ማቀናበር እና ማዋሀድ

### መግቢያ

በድጋሜ እንኳን ከአካል-ውጪ የሆኑ ልምዶች አሰሳ ወደሆነው የመጨረሻ ምዕራፍ በደህና እመጡ። በዚህ ምእራፍ ውስጥ ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶች ውጤቶችን በመመርመር እነዚህ ልምዶችን በዕለት ተዕለት ህይወታችን ውስጥ የማዋሃድ ሂደቶችን እንወያያለን። ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶች ጥልቅ አቅም ያላቸው እና ለውጥ የሚያመጡ ልምዶች እንደመሆናቸው መጠን ከእነዚህ ያልተለመዱ ልምዶች ያገኘነውን ግንዛቤ ለመሰላሰል፣ ለመረዳት እና ተግባራዊ ለማድረግ ለራሳችን ጊዜ እና ቦታ መስጠት አስፈላጊ ነው። ስለዚህ ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶችን ከራሳችን ጋር ለማቀናበር እና ለማዋሃድ ልንወስዳቸው የሚገቡ ደረጃዎችን እንመርምር።

### በተሞክሮዎ ላይ ማሰላሰል

ከሰውነት ውጪ ከሆኑ ልምዶች በኋላ ብዙ አይነት ስሜቶች እና ሀሳቦች በውስጣችን መፈጠራቸው ተፈጥሯዊ ነው። በተሞክሮው ላይ ጊዜ ወስደን ማሰላሰል በተማርናቸው ትምህርቶች እና ከጉዞው በስተጀርባ ያለውን ትርጉም በጥልቀት እንድንገነዘብ ይረዳናል። ለእርስዎ ከሰውነት ውጪ የሆነ ልምድ መጽሔት በማዘጋጀት የልምዱን ዝርዝሮች፣ እንዲሁም ያጋጠሙዎትን ስሜቶች ወይም ገጠመኞች ይመዝግቡ። ልምዱ በአንተ ላይ ምን ተጽዕኖ እንዳሳደረብህ እና ስለራስህ፣ ስለ መንፈሳዊ መንገድህ ወይም ስለ እውነታ ተፈጥሮ በተማርከው ነገር ላይ ለራስህ ጊዜ ሰተህ አስብ።

## ድጋፍ እና ማረጋገጫ መፈለግ

ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶችዎን ወደ አካላዊ ህይወታችን ማምጣት፣ ማቀናበር እና ማዋሃድ ኃይለኛ እና ቀላል የማይባል መንፈሳዊ ለውጥ ሊያስከትል የሚችል ሂደት ሊሆን ይችላል። የመስመር ላይ መድረኮችን መቀላቀል፣ ስለነዚህ ልምዶች ሀሳብ የሚለዋወጡ ማህበረሰቦች ውስጥ መሳተፍ ወይም ተመሳሳይ አስተሳሰብ ካላቸው ግለሰቦች ጋር መገናኘትን እንዲሁም የመሳሰሉ ተመሳሳይ ክስተት ካጋጠሟቸው ሌሎች ድጋፍ መፈለግ ጠቃሚ ሊሆን ይችላል። ልምድዎን ለታመኑ ጓደኞች ማካፈል ወይም የመንፈሳዊ አማካሪ መመሪያ መፈለግ ሃሳቦችዎን እና ስሜቶችዎን ለመመርመር የሚደግፍ ማረጋገጫ እና አስተማማኝ ቦታ ሊሰጥ ይችላል።



## ቁልፍ ግንዛቤዎችን መለየት

ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶች ብዙውን ጊዜ ስለራሳችን፣ ስለ አጽናፈ ሰማይ ወይም ስለ ንቃተ ህሊና ተፈጥሮ ጥልቅ ግንዛቤዎችን ይሰጡናል። ከተሞክሮዎችዎ ውስጥ ዋና እና ወሳኝ የሆኑ ትምህርቶችን እና መልዕክቶችን ለመለየት ጊዜ ይውሰዱ። የተገኙትን አዳዲስ አመለካከቶች፣ ያሳለፍከውን መንፈሳዊ እድገት እና እነዚህ ግንዛቤዎች በዕለት ተዕለት ህይወትህ ውስጥ ሊኖራቸው የሚችለውን ተግባራዊ ተፅዕኖ አስብ። እነዚህን መንፈሳዊ መገለጦች በእምነታችሁ፣ በእሴቶቻችሁ እና ወደፊት በሚወስዱት ድርጊቶችዎ ጋር በማቀናበር እና በማቀናጀት እንዴት ከራስዎ ጋር ሊዋሀዱ እንደሚችሉ ያሰላስሉ።

**ተግባራዊ ጥበብን መተግበር**

ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶች በዕለት ተዕለት ሕይወታችን ውስጥ በቀጥታ ሊተገበር የሚችል ተግባራዊ ጥበብን ሊሰጡ ይችላሉ። በተሞክሮው ወቅት ያገኘናቸውን መመሪያዎች በተለያዩ ዘርፎች ማለትም እንደ ግንኙነቶች፣ የስራ ምርጫዎች፣ የግል እድገት እና የውሳኔ አሰጣጥ ውስጥ እንዴት ተግባራዊ ማድረግ እንደሚቻል ለራስዎ ጊዜ ሰተው ያሰላስሉ።። ይህ አዲስ ግቦችን ማውጣትን፣ የአኗኗር ዘይቤን መለወጥን፣ የሚገድቡ እምነቶችን ማስወገድን ወይም ከራስዎ እና ከሌሎች ጋር ጥልቅ ግንኙነት መፍጠርን ሊያካትት ይችላል። ከሰውነት ውጪ ከሆኑ ልምዶች የሚገኘው ተግባራዊ ጥበብ ድርጊትህን ከከፍተኛ ወይም ከመንፈሳዊ ዓላማህ ጋር ለማስማማት እንደ ኮምፓስ ሆኖ ሊያገለግል ይችላል።

**መንፈሳዊ ልምምድን መጠበቅ**

ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶች ከራሳችን እና ከህይወታችን ጋር የማዋሃድ ሂደት ከመጀመሪያው ልምድ በላይ የሚዘልቅ ቀጣይነት ያለው ሂደት ነው። ከራስዎ እና ከመንፈሳዊው ዓለም ጋር ያልዎትን ግንኙነት ለማጠንከር እና ለማስቀጠል መደበኛ መንፈሳዊ ልምምድን ማዳበር አስፈላጊ ነው። ይህ ተመስጦን፣ የትንፋሽ ስራን፣ ጸሎትን፣ መፆምን፣ ወይም ሌሎች ከእርስዎ ጋር የሚስማሙ ልምምዶችን ሊያካትት ይችላል። ውጥነት ያለው መንፈሳዊ ልምምድን በማዳበር ከፍተኛ የንቃተ ህሊና ሁኔታዎችን የመድረስ ችሎታዎን ማጠናከር እና አጠቃላይ ደህንነትዎን ማሻሻል ይችላሉ።

**እድገትን እና ዝግመተ ለውጥን መቀበል**

ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶችን ከራሳችን ጋር ማዋሀድ መቻላችን ግላዊ እድገትን እና ዝግመተ ለውጥን እንድንቀበል ያደርገናል። የንቃተ ህሊናዎን ጥልቀት መመርመርዎን ሲቀጥሉ እና ስለ እውነታዎ ያለዎትን ግንዛቤ ሲያስፋፉ ለአዳዲስ ግንዛቤዎች፣ ልምዶች እና የአመለካከት ለውጦች ክፍት ይሁኑ። ከሰውነት ውጪ በሆነ ልምድ ያገኘኸውን ጥበብ ከራስህ ጋር ስታዋህድ እራስህን እንድታድግ እና ለውጦችን እንድትላመድ ፍቀድ። እድገትን እና ለውጥን መቀበል ወደ ጥልቅ መንፈሳዊ ለውጦች ሊያመራ የሚችል ቀጣይነት ያለው ጉዞ እና ከትክክለኛ ማንነትዎ ጋር ጥልቅ ግንኙነት እንዲፈጥሩ ይረዳዎታል።



**ማጠቃለያ**

ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶችን ከራሳችን የህይወት ዘይቤ ጋር ማቀናበር እና ማዋሃድ ለአጠቃላይ ራስን የማወቅ እና የመንፈሳዊ መንቃት ጉዞ አስፈላጊ አካል ነው። ልምዶቹን በማሰላሰል፣ ድጋፍን በመፈለግ፣ ቁልፍ ግንዛቤዎችን በመለየት፣ ተግባራዊ ጥበብን በመተግበር፣ መንፈሳዊ ልምምድን በማጎልበት እና እድገትን እና ዝግመተ ለውጥን በመቀበል በመንፈሳዊ ጉዞአችን ያገኘነውን ጥልቅ ጥበቦች በዕለታዊ ህይወታችን ውስጥ ማዋሃድ እንችላለን። ያስታውሱ ይህ መንፈሳዊ ግንዛቤዎችን የማዋሃድ ሂደት ለእያንዳንዱ ግለሰብ ልዩ ሲሆን በትዕግስት፣ ፅናት እና ክፍት አእምሮ እና ልብ መቅረብ አስፈላጊ ነው።

## 7.2 የግል እድገት እና ለውጥ

### መግቢያ

በዚህ ክፍል ውስጥ ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶች ሊያስከትሉ የሚችሉትን ጥልቅ ግላዊ እድገት እና ለውጥ እንቃኛለን። ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶች በውስጣችን ጥልቅ ለውጦችን የመፍጠር አቅም ያላቸው ሲሆን ወደ እራስ ግኝት፣ የንቃተ ህሊና መስፋፋት እና በአጽናፈ ሰማይ ውስጥ ያለንን ቦታ ለመገንዘብ የሚረዱ ልምዶችን ይሰጣሉ። ስለዚህ እነዚህ ልምዶች እንዴት የግል እድገትን እና ለውጥን እንደሚያመቻቹ እንመርምር።

### ግንዛቤን ማስፋፋት

ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶች ጉልህ ከሆኑ ውጤቶች አንዱ የንቃተ ህሊና እና የግንዛቤ መስፋት ነው። ከሰውነት ውጪ በሆኑ ልምዶች አማካኝነት የሥጋዊ አካላችንን ውስንነቶች ማለፍ እና ከተለመደው በላይ ያሉ እውነታዎችን መለማመድ እንችላለን። ይህ የተስፋፋ ግንዛቤ ስለእኛ እውነተኛ ተፈጥሮ፣ የሁሉም ነገሮች ትስስር እና ስለ እውነታ ሁለገብ ተፈጥሮ ጠለቅ ያለ ግንዛቤ እንዲኖረን ያደርጋል። እነዚህን አዲስ አመለካከቶች በዕለት ተዕለት ሕይወታችን ውስጥ ስናዋህድ ስለራሳችን እና በዙሪያችን ስላለው ዓለም ያለንን ግንዛቤ በማዘመን ጥልቅ ለውጦችን ማድረግ እንችላለን።

### ከሚገድቡ እምነቶችን መላቀቅ

ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶች በህይወት ዘመናችን ያገኘናቸውን የእምነት ስርዓቶች እና ሁኔታዎች ብዙ ጊዜ ይሞግታሉ። አማራጭ መንፈሳዊ ግዛቶችን ስንመረምር እና የተለያዩ አካላትን፣ ፍጥረታትን እና ልምዶችን ስናገኝ ቀደም

ሲል የያዝነውን እምነት ትክክለኛነት ልንጠራጠር እንችላለን። ይህ ጥያቄ አዳዲስ አመለካከቶችን ለመውሰድ እና ያለፈባቸውን ወይም እኛን የማያገለግሉ እና የሚገድቡ እምነቶችን ለመተው በር ሊከፍት ይችላል። ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶች ከማህበረሰባዊ ገደቦች እና ድንበሮች ነፃ ሊያወጡን እንዲሁም ይበልጥ ትክክለኛ እና ሰፊ የሆነ የራስ ስሜትን እንድናዳብር ያስችለናል።

## ፈውስን ማግኘት እና ከራስ ጋር ማዋሃድ

ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶች ፈውስን ለማግኘት እና ከራስ ጋር ልምዶቹን ለማዋሃድ እንደ ኃይለኛ መሳሪያዎች ሆነው ሊያገለግሉ ይችላሉ። ከሰውነት ውጪ በሆኑ ልምዶች ወቅት ያልተፈቱ ስሜቶችን፣ ያለፉ ቁስሎችን ወይም ፈውስ የሚያስፈልጋቸውን የእራሳችንን ገፅታዎች ለመዳሰስ እድሉ ሊሰጠን ይችላል። በመንፈሳዊ ዓለም ውስጥ በሚገኙ ልምዶች ጋር በመሳተፍ ግንዛቤዎችን ማግኘት፣ አሉታዊነትን መልቀቅ እና ስሜታዊ እና መንፈሳዊ ፈውስ ማግኘት እንችላለን። እነዚህን ልምዶች በእለት ተእለት ህይወታችን ውስጥ ስናዋህድ የበለጠ ሙሉነትን፣ እራስን መቀበልን እና ውስጣዊ ሰላም ማግኘት እንችላለን።

## መንፈሳዊ ግንኙነትን ማሻሻል

ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶች መንፈሳዊ ግንኙነታችንን ለማጠናከር ቀጥተኛ መንገድ ይሰጡናል። ሥጋዊ አካልን በማለፍ ወደ መንፈሳዊ ዓለም ውስጥ መግባት የሜታፊዚካል እና የመንፈሳዊ ግዛቶችን ልምዶች ለመለማመድ ለራሳችን በር እንከፍታለን። እነዚህ ክስተቶች ከአጽናፈ ሰማይ፣ ከፍ ያሉ ግዛቶች እና መንፈሳዊ ፍጡራን ጋር የትስስር ስሜትን ሊያሳድጉ ይችላሉ። ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶችን በመጠቀም ከራሳችን፣ ከመንፈሳዊ አስጎብኚዎች እና ከሌሎች

በጎ አድራጊ አካላት ጋር ያለንን ግንኙነት ማጠናከር የምንችል ሲሆን ይህም መንፈሳዊ ጉዞአችንን እንድንቀጥል እና ከመንፈሳዊ አላማችን ጋር ስጋዊ ማንነታችንን እንድናስተካክል ይረዳናል።

## ራስን የማወቅ ችሎታን ማጎልበት

ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶች ራስን ለማወቅ ወደ ምናደርገው ጉዞ ሀይል ሰጪ ተሞክሮ ሊሆን ይችላል። የንቃተ ህሊናችንን ጥልቀት እንድንመረምር፣ የተደበቁ እምቅ ችሎታዎችን ለማውጣት እና ወደ ከፍተኛ የግንዛቤ ሁኔታዎች ውስጥ እንድንገባ ያስችለናል። ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶች በዕለት ተዕለት ሕይወታችን ውስጥ በቀላሉ የማይታዩ የራሳችንን ገፅታዎች ሊገልጡ የሚችሉ ሲሆን ይህም የእኛን እውነተኛ ተፈጥሮ እንድንቀበል እና ከመንፈሳዊ ዓላማችን ጋር በማስማማት እንድንኖር ኃይል ይሰጠናል። እነዚህ ልምዶች ወደ ግላዊ እድገት እና ለውጥ ሊያነሳሱን ግልጽነትን፣ አቅጣጫን እና የትርጉም ስሜትን ሊሰጡን ይችላሉ።

## ውህደት እና አተገባበር

ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶች እውነተኛ ዋጋ የሚኖራቸው ከእነዚህ ልምዶች ያገኘናቸውን ግንዛቤዎች ከራሳችን ጋር በማዋሃድ እና በተግባር በመኖር ነው። ልምዶቻችንን ወደ የዕለት ተዕለት ህይወታችን ስናመጣ ያገኘነውን ጥበብ እና ግንዛቤ ወደ ተግባራዊ ወደሚደረግ ግብ መቀየር አስፈላጊ ነው። ይህ ግቦቻችንን እና ውሳኔዎቻችንን ከአዲሶቹ አመለካከቶች ጋር ማጣጣምን፣ መንፈሳዊ ልምምዶችን ወደ ተግባራችን ማካተትን፣ ጤናማ ልማዶችን ማቋቋምን ወይም የግል እድገታችንን በሚያረጋግጡ ተግባራት ውስጥ መሳተፍን ሊያካትት

ይችላል። ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶችን በህይወታችን ውስጥ በንቃት በማዋሃድ ዘላለማዊ እና ዘላቂ ለውጥን እናመጣለን።

## ማጠቃለያ

ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶች ጥልቅ የሆነ የግል እድገትን እና ለውጥን የማመቻቸት አቅም አላቸው። ግንዛቤን በማስፋት፣ ከሚገቱ እምነቶች በመላቀቅ፣ እራስን በመፈውስ፣ መንፈሳዊ ግንኙነትን በማጎልበት፣ ራስን የማወቅ ችሎታን በመጨመር፣ እና ግንዛቤዎችን በማዋሃድ እና በመተግበር እራስን የማግኘት ጉዞአችንን ማሳለጥ እንችላለን። ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶችን የመለወጥ ሃይል በመቀበል እራስዎን እንዲያድጉ፣ እንዲያሻሽሉ እና ከእርስዎ ጥልቅ ገጽታዎች ጋር እንዲገናኙ ይፍቀዱ።



## 7.3 አዲስ አመለካከትን መቀበል እና መያዝ

### መግቢያ

በዚህ ክፍል ውስጥ ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶች ለህይወት ባለን አመለካከት እና በዙሪያችን ባለው አለም ላይ ሊያሳድሩ የሚችሉትን ጥልቅ ተጽእኖ እንመረምራለን። ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶች የዕለት ተዕለት የንቃተ ህሊና ሁኔታ ውስንነቶችን እንድናልፍ እና ስለእውነታው ያለንን ግንዛቤ ሊቀይሩ እና ሊያሰፉ የሚችሉ ግንዛቤዎችን እንድናገኝ ልዩ እድል ይሰጡናል። እነዚህን አዳዲስ አመለካከቶች በመቀበል የበለጠ ሰፊ፣ ትርጉም ያለው እና በአርኪ የህይወት ለተሞላ ተሞክሮ እራሳችንን መክፈት እንችላለን። አሁን ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶች ለሕይወት አዲስ አመለካከትን እንድንቀበል እና እንድንይዝ እንዴት እንደሚረዱን እንመርምር።

### ግንዛቤን እና ንቃተ-ህሊናን ማስፋት

ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶች የአጽናፈ ሰማይን ስፋት እና እርስ በርስ የመተሳሰር ስሜትን እንድንለማመድ ያስችሉናል። ከሥጋዊ አካል በመሻገር እና ከተለመደው ግንዛቤያችን በላይ ያሉትን ዓለማት በመዳሰስ ግንዛቤያችንን እና ንቃተ ህሊናችንን ማስፋት እንችላለን። ይህ የተስፋፋ ግንዛቤ ከላይ ካለው እውነታ ባሻገር እንድንመለከት እና ሚስጥራዊ እና ስውር የሆኑትን የሕልውና ንብርብሮች እንድንገነዘብ ይረዳናል። እራሳችንን ለዩኒቨርስ ስንከፍት ሁላችንም ዘንድ ያለውን ገደብ የለሽ አቅም እና ትስስር የሚቀበል አዲስ እይታን ማዳበር እንጀምራለን።

## የሁላችንንም አንድነት ማድነቅ

ከሰውነት ውጪ በሆኑ ልምዶች ወቅት ከምናገኘው አዲስ አመለካከት አንዱ ከአካላዊ እውነታ ዘልቆ የሚገባውን ጥልቅ የአንድነት እና የመተሳሰር ስሜት ነው። ይህም መለያየት ቅዠት መሆኑን በመገንዘብ በዙሪያችን ካሉ ነገሮች ጋር ጥልቅ ግንኙነት እንድናዳብር ይረዳናል። ይህ ግንዛቤ ለራሳችን እና ለሌሎች ያለንን አመለካከት በመቀየር የማይመለስ እና ጥልቅ ለውጥ ያመጣል። ሁላችንም እርስ በርስ የተገናኘን መሆናችንን እና ድርጊቶቻችን የሞገድ ተፅእኖዎች እንዳሏቸው መረዳት እንጀምራለን። ይህን አዲስ አመለካከት መቀበል ርህራሄን፣ መረዳትን እና ለሁሉም ፍጡራን ደህንነት አሳቢ እንድንሆን የሚያደርገን ሲሆን ይህም የሚሆነው ሁላችንም አንድ አካል መሆናችንን ስለምንገነዘብ ነው።

## በአሁኑ ጊዜ መኖር

ከሰውነት ውጪ የሆነ ልምዶች ብዙውን ጊዜ ከጊዜ እና ቦታ ገደብ በላይ የሚወስዱን ሲሆን ይህም ንጹህ ወደሆነ የመገኘት ሁኔታ ውስጥ እንድንገባ ይረዳናል። በነዚህ ተሻጋሪ ልምምዶች ካለፉ ሸክሞች እና ስለወደፊቱ ከያዝናቸው ስጋቶች ነፃ ሆነን እዚህ እና አሁን ውስጥ ሙሉ በሙሉ እንጠመቃለን። ይህ አዲስ የተገኘ አመለካከት አሁን ባለንበት ሰአት የበለጠ በሙሉነት እንድንኖር በማበረታታት የእያንዳንዱን አፍታ ውበት እና ፀጋ እንድናደንቅ ያደርገናል። ይህንን አዲስ አመለካከት በመቀበል በዕለት ተዕለት ሕይወታችን የላቀ የምስጋና፣ የደስታ እና ውስጣዊ የመረጋጋት ስሜት ማዳበር እንችላለን።

## ትርጉም እና ዓላማ መፈለግ

ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶች የሕይወታችንን ትርጉም እና ዓላማ የመፈለግ ጥልቅ ጉጉት በውስጣችን ሊያቀጣጥል ይችላል። በመንፈሳዊ ጉዞአችን ውስጥ ጥልቅ ግዛቶችን እና አካላትን ስንገናኝ የመኖርን ትርጉም፣ አላማ እና የምርጫዎቻችንን አስፈላጊነት መጠራጠር እንጀምራለን። ይህ ጥያቄ ወደ ውስጣችን ጥልቀት እንድንገባ፣ ፍላጎቶቻችንን፣ እሴቶቻችንን እና ለአለም ማድረግ የምንፈልጋቸውን አስተዋጾ እንድንመረምር ያነሳሳናል። ይህንን አዲስ አመለካከት መቀበላችን ተግባሮቻችንን እና ምርጫዎቻችንን በላቀ የዓላማ እና የትርጉም ስሜት እንድንመራ ኃይል ይሰጠናል።

## ለውጥን እና እድገትን መቀበል

ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶች ስለ ለውጥ እና እድገት ያለንን መሰረታዊ ግንዛቤ ሊቀይሩ ይችላሉ። አጽናፈ ሰማይ ወይም ዩኒቨርስ በቋሚ ለውጥ ውስጥ እንዳለ እና ለውጥ የተፈጥሮ እና የህይወት አስፈላጊ ክፍል መሆኑን እንገነዘባለን። ይህ አዲስ አመለካከት ማደግ የምንችለው በለውጥ ውስጥ በማለፍ መሆኑን በመገንዘብ ለውጥን እንድንቀበል እና እንድንላመድ ያስችለናል። ይህም ንቃተ ህሊናችንን በማስፋት እና ወደ እውነተኛ ማንነታችን የሚያቀርቡንን አዳዲስ ልምዶች፣ ሀሳቦች እና እድሎች ክፍት ሆነን እንድንቀበል ይረዳናል።

## ምስጋናን እና አድንቆትን ማዳበር

የመንፈሳዊ ግዛትን ውበት እና ወሰን የለሽ እድሎች ስንመለከት ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶች ብዙ ጊዜ የምስጋና እና የመደነቅ ስሜትን ይፈጥራሉ። ይህ አስደናቂ አመለካከት ወደ ዕለታዊ ህይወታችን ውስጥ በማዋሃድ በአሁን አፍታ ያለውን ፀጋ እና በረከት እንድንመለከት ያስችለናል። ይህም ለህይወት ቀላል ደስታዎች ጥልቅ የሆነ የምስጋና ስሜት እንድናዳብር ያደርገናል። ይህንን አዲስ አመለካከት መቀበል ስለ ደስታ እና እርካታ ያለንን አመለካከት በመለወጥ ቀኖቻችንን በላቀ የደስታ እና የአድናቆት ስሜት እንድናሳልፍ ያደርገናል።

## ማጠቃለያ

በህይወት ላይ አዲስ አመለካከትን መቀበል ከአካል-ውጭ የሆኑ ልምዶች ውጤት አንዱ ስጦታ ነው። ግንዛቤን በማስፋት፣ አንድነትን በማድነቅ፣ በአሁኑ አፍታ በመኖር፣ ትርጉም እና አላማን በመፈለግ፣ ለውጥን እና እድገትን በመቀበል፣ እና ምስጋና እና አድንቅነትን በማጎልበት የእለት ተእለት አሉታዊ የአመለካከት ውስንነቶች አልፈን ጥልቅ እና ትርጉም ያለው የህይወት ተሞክሮን መቀበል እንችላለን። ስለዚህ በነዚህ ልምዶች በሚገኙ የለውጥ ሃይሎች እራስዎን በማዘመን በጉዞዎ ላይ የሚጠብቁዎትን አዳዲስ ልምዶች ይቀበሉ።

ከሰውነተ ውጪ የሆነ ልምድ



**ፍርሃት** (ልምዱ ሲከሰት መጀመርያ የነበረኝ ስሜት)



**እምነት** (ልምዱ ሲከሰት አሁን ያለኝ ስሜት)

# ያገኘህውን

# ትምህርት




# እንጂ

# ስህተቴን

# አትቁጠር።

ከሰውነተ ውጪ የሆነ ልምድ



ኤጳጉሜን
(ኔቶ)

ከሰውነት ውጪ የሆኑ ልምዶችን የማሰስ ጉዞ ለእያንዳንዱ ግለሰብ ልዩ እና ግላዊ የሆኑ ልምዶች ናቸው። ለአንድ ሰው የሚሰራው ለሌላው ላይሰራ ይችላል። ይህንን ርዕስ በክፍት አእምሮ እና በጉጉት ስሜት መቅረብ አስፈላጊ ነው። በዚህ መጽሐፍ ውስጥ ያሉት ምዕራፎች እና ፅንሰ-ሀሳቦች መመሪያ እና ግንዛቤዎችን ለመስጠት የታቀዱ ሲሆኑ በመጨረሻ ግን የእራስዎን ልምዶች ወደ እራስዎ ወስደው ትርጉም መስጠት እና ከራስዎ ህይወት ጋር ማዋሀድ የራስዎ የቤት ስራ እና ሀላፊነት ነው።